# የአፓርታማ መሰረታዊ ድርጅት

# መኖሪያ ቁ-6 ህዋስ እቅድ

## መግቢያ

እንደ ወረዳ 01 የመኖሪያ ቁ-6 ህዋስ በርካታ ስራዎችን በመስራት የተሻለ ስራ ባሳለፍነዉ በጀት አመት ማምጣጥ ችለናል፡፡ በ2017 ዓ.ም የ2016 በጀት አመት አፈጻጸማቸዉን መነሻ በማድረግ ጥንካሪዉን የበለጠ በማስቀጠል ድክመቶችን በእቅድ በማካተት ወደ ስራ መግባት እንዳለባቸዉ በተግባባነዉ መሰረት የመኖሪያ ቁ-6 የህዋሱን አደረጃጀት በዘመናዊ አሰራርና የመረጃ ሥርዓት በማጠናከር አባላት በአስተሳሰብ ጥራት ላይ የተመሰረተ ዉጤታማ የተልዕኮ አፈፃፀምና የትርክት የበላይነት እንዲኖራቸው በማስቻል የመንግስትን የማስፈፀም አቅም ማሳደግና የሕዝቡን እርካታ ማረጋገጥ ነዉ።

## 1. የእቅዱ ግቦች

- ተልዕኮዉን በብቃት መፈፀም የሚችል ጠንካራ መሰረታዊ ድርጅት መገንባት፣
- የአባላትን የተልዕኮ አፈፃፀም ውጤታማነት በማሳደግ የፖርቲውን ሁለንተናዊ ቅቡልነት ማረጋገጥ፣
- ብቃት ባለው የማህበራዊ ሚዲያ ተሳትፎ የመረጃ (የትርክት) የበላይነትን መያዝ፣
- በአባላት ንቁ ተሳትፎ የአካባቢ ምርጫን በስኬትና በአብላጫ ድምፅ አሸናፊነት ማጠናቀቅ፤

## ግብ አንድ፤ ተልዕኮዉን በብቃት መፈፀም የሚችል ጠንካራ ህዋስ መገንባት፣

***<u>ዝርዝር ተግባራት፤</u>***

**ተግባር** 1 የ2016 በጀት አመት አፈፃፀምን መነሻ ያደረገ የህዋሱ አመታዊ እቅድ በጥራት ማዘጋጀት፣

**ተግባር** 2 የህዋሱ እቅድ እስከ  አባላት ድረስ መታቀዱን ማረጋገጥ፣

**ተግባር** 3 በህዋሱ አመታዊ እቅድ ላይ ኦረንቴሽን መስጠትና በኮንፈረንስ ማፀደቅ፣

**ተግባር** 4 በህዋስ ውይይቶች ላይ የተመሰረተ መደበኛ የአቅም ግንባታ በየወሩ አንድ ጊዜ ማካሄድ፣

**ተግባር** 5 ሁሉም አባላት አዲስ በወጡ የፓርቲያችን መመሪያዎች ላይ በቂ ግንዛቤ መጨበጣቸውን ማረጋገጥ፣

**ተግባር** 6 የህዋስ አመራሮች በተሟላ ሁኔታ መደራጀታቸውን ማረጋገጥ፣ሲጓደሉም ወዲያውኑ መተካት፣

**ተግባር** 7 በመልሶ ማደራጀት ለሚገቡ አዳዲስ አመራሮች በህገ ደንብ፣ ፕሮግራም፣ በመመሪያዎችና አሰራሮች ላይ ሥልጠና መስጠት፣

**ተግባር** 8 ህዋሱ በአሰራርና አደረጃጀት መመሪያ በተቀመጠው ቁጥር ልክ ብቻ እንዲደራጁ ማስቻል፣

**ተግባር** 9 ከወረዳ በሚወርድ ኮታ መሰረት በአባላት ስብጥር ላይ ያለብንን ክፍተት የሚያስተካክል ጥራትን ማዕከል ያደረገ የአባላት ምልመላ ማካሄድ፣

**ተግባር** 10 አዲስ የተመለመሉ አባላት በፓርቲ ህገ ደንብና ፕሮግራም ላይ በቂ ግንዛቤ መያዛቸውን ማረጋገጥ፣

**ተግባር** 11 የሁሉም የህዋስ አባላት ዝርዝር መረጃ ወደ መረጃ ቋት እንዲገባ ማድረግ፣

**ተግባር** 12 የህዋስ ውይይት ቃለ ጉባዔዎች በአግባቡ ተሰንድው እንዲያዙ ማድረግ፣

**ተግባር** 13 ሁሉም አባላት ወርሃዊ መዋጮን በወቅቱ በተሟላ ሁኔታ መክፈላቸውን በመከታተል የፓርቲውን የፋይናንስ አቅም ማሳደግ፣

**ተግባር** 14 ከወረዳ በሚወርድ ኮታ መሰረት የከተማ ቅርንጫፍ ፓርቲ ፅ/ቤት ህንፃን ለማስገንባት የሚያግዝ ሃብት መሰብሰብ፣

**ተግባር** 15 የልሳነ ብልጽግና መጽሔት ክፍያ በሥርዓትና በወቅቱ ሰብስቦ ገቢ ማድረግ፣

**ተግባር** 16 በየወቅቱ ከወረዳ ለሚመጡ የመረጃ ጥያቄዎች ፈጣንና ጥራት ያለው ምላሽ መስጠት፣

**ተግባር** 17 የስድስት ወር እና አመታዊ የስራ አፈፃፀም ሪፖርት ማዘጋጀትና ግምገማ ማካሄድ፤

**ተግባር** 18 የአባላትን የየስድስት ወር የእቅድ አፈፃፀማቸውን መሰረት በማድረግ በአመት ሁለት ጊዜ ግብረ መልስ መስጠት፣

**ግብ ሁለት፤ የአባላትን የተልዕኮ አፈፃፀም ውጤታማነት በማሳደግ የፓርቲውን ሁለንተናዊ ቅቡልነት ማረጋገጥ፣**

***ዝርዝር ተግባራት፤***

**ተግባር** 1 ከወረዳ አደረጃጀት በሚላክ የውይይት ማስፈጸሚያ እቅድ መሰረት የተጠናከሩ ውይይቶች በሁሉም የህዋስ አደረጃጀቶች ማካሄድ፣

**ተግባር** 2 በአመቱ ውስጥ ሁለት ጊዜ ከባለድርሻ አካላት ጋር በመነጋገር በወቅታዊ ጉዳዮች ላይ ለህዋሱ አባላት ስልጠና መስጠት፤

**ተግባር** 3 የህዋሱ አባላት በፀረ- ሌብነትና ብልሹ አሠራር ትግሉ ንቁ ተሳታፊ እንዲሆኑ መደገፍና ማብቃት፣

**ተግባር** 4 የህዋሱ አባላት በመኖሪያ አካባቢያቸው በሚወርዱ መንግስታዊ ተልዕኮዎች እና በሰው ተኮር የበጎ ፍቃድ አገልግሎቶች ግንባር ቀደም ተሳትፎ የሚያደርጉበት ስምሪት መስጠትና አፈፃፀሙን መከታተል፣

**ተግባር** 5 የሥነ ምግባር ብልሽትና የአመለካከት ግድፈት የሚታይባቸውን አባላት መገንባት፤ የማይታረሙትን ከአባልነት ማስወጣት፣

**ተግባር** 6 ከህዋሱ አባላት መካከል 70 በመቶ ያክሉ የተሰጣቸውን ተልእኮ በመፈፀም ግንባር ቀደም እንዲሆኑ ማድረግ፣

**ተግባር** 7 ከወረዳ በሚወርድ ኮታ መሰረት መስፈርቱን የሚያሟሉና በውድድር ብቁ መሆናቸው የተረጋገጡ ኮር እና ተተኪ አመራሮችን መለየት፣

**ተግባር** 8 በአመቱ ማጠቃለያ ለግንባር ቀደም አባላት እውቅናና ማበረታቻ መስጠት፣

**ግብ ሶስት፤ ብቃት ባለው የማህበራዊ ሚዲያ ተሳትፎ የመረጃ (የትርክት) የበላይነትን መያዝ፣**

***ዝርዝር ተግባራት፤***

**ተግባር 1** ሁሉም የህዋሱ አባላት ማህበራዊ ሚዲያዉ ለፖለቲካ ሥራችን ያለውን ፋይዳ ተገንዝበው ንቁ ተሳትፎ እንዲያደርጌ በተከታታይ ማንቃት፣

**ተግባር 2** የሁሉንም የህዋሱን አባላት በስማቸው የተከፈቱ የማህበራዊ ሚዲያ አካውንቶች ለይቶና አደራጅቶ መያዝ፣

**ተግባር 3** ከማዕከልና የሚወርዱ እለታዊ፣ ሳምንታዊና ወርሃዊ የሚዲያና ኮሙኒኬሽን አጀንዳዎች በመሰረታዊ ድርጅቱ አባላት የግል አካውንቶች መሰራጨታቸውን መከታተል፣

**ተግባር 4** የጥፋትና የፅንፈኛ ሃይሎችን አላማ የማክሸፍ ብቃት ያለውና የመረጃና የሚዲያ የበላይነት የሚያሲዝ የማህበራዊ ሚዲያ ተሳትፎ ማድረግ፣

**ተግባር 5** አባላት በማህበራዊ ሚዲያ ያላቸውን ተሳትፎ መረጃ በመያዝ በደረጃ መለየት

**ግብ አራት፤ በአባላት ንቁ ተሳትፎ የአካባቢ ምርጫን በስኬትና በአብላጫ ድምፅ አሸናፊነት ማጠናቀቅ፤**

***ዝርዝር ተግባራት፤***

**ተግባር 1** የመሰረታዊ ድርጅቱ አባላት በቅድመ ምርጫ፣ በምርጫ ዕለትና በድኅረ ምርጫ ምዕራፎች ንቁ እንቅስቃሴ እንዲያደርጉ ስምሪት መስጠትና መደገፍ፣

**ተግባር 2** ከወረዳ በሚወርድ ኮታ አቅጣጫ መሰረት ምሁራንን፣ ሴቶችን፣ አካል ጉዳተኞችንና ወጣቶች ያካተተ ብቁ እጩዎችን መለየት፣

## ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮችና መወሰድ ያለባቸው መፍትሄዎች

- የህዋስ ውይይት ላይ የአባላት መንጠባጠብ ወይንም አለመገኘት

**መወሰድ ያለባቸው መፍትሄዎች**

- በየደረጃው ካሉት ኃላፊዎች ጋር ውይይት በማድርግ በድክመት የተለዩ ችግሮችን ፈጥኖ እንዲስተካከሉ ማድረግ፤ እንዲሁም ለሚያረፍድ እና ለሚቀር የእርምት እርምጃ መውሰድ

## ማጠቃለያ

ብልጽግና ፓርቲያችን የሀገራችን ሁለንተናዊ ብልጽግና ለማረጋገጥ በሚሰራቸዉ ስራዎች ከህዋሱ የሚጠበቀዉ ብዙ ጉዳዮች እንደመሆኑ መጠን በባለፈዉ አመት ከፈፀምነው በበለጠ የፓርቲን እና የመንግስትን ተግባራት በቅንጀት እና በትብብር በመስራት ከምንጊዜዉም በላይ አባላትን ግንባር ቀደም ህዋሱ ሞዴል ሆኖ በቁርጠኝነት ሰርተን በ2017 በጀት አመት የተሻለ ስራ እንሰራለን፡፡